# የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን ታሪክና እምነት አጭር ዳሰሳ

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን
ትክክለኛውን ሐዋርያዊ ትምህርት የያዘች ጥንታዊትና ታሪካዊት
ቤተ ክርስቲያን ናት።

ጥንቅር- ዲ/ን ዘላለም ቻላቸው
ነሐሴ 2001 ዓ.ም



**«አሁን ግን ክርስቶስ ላንቀላፉት በኩራት ሆኖ ከሙታን ተነስቷአል፡፡ ሁሉ በአዳም እንደሚሞቱ እንዲሁ በክርስቶስ ደግሞ ህያዋን ይሆናሉና፡፡»** 1ኛ ቆሮ. 15፥20-21



**«እነሆ ከዛሬ ጀምሮ ትውልድ ሁሉ ብፅዕት ይሉኛል፤ ብርቱ የሆነ በእርሱ ለእኔ ታላቅ ሥራን አድርጓልና።» ሉቃ.** 1፥49

## ማውጫ

# 1. የቃላት ትርጉም

## 1.1 ኢትዮጵያ

«ኢትዮጵያ» የሚለው ቃል «የተቃጠለ ፊት» የሚል ትርጉም ያለው የግሪክ ጥምር ቃል ነው:: ቃሉን ከግብጽ በስተ ደቡብ እስከ ህንድ ውቅያኖስ ድረስ ያለውን ቦታ ለማመልከት ለመጀመሪያ ጊዜ የተጠቀሙበት ሆሜርና ሄሮዱተስ የተባሉት ግሪካውያን የታሪክ ጸሐፊዎች ናቸው:: ምክንያታቸውም በቦታው ይኖሩ የነበሩ ሰዎች የቆዳ ቀለም ነው::

የጥንት ግብጻውያን ከአገራቸው በስተደቡብ ያለውን ቦታ የኩሽ ምድር እያሉ ይጠሩት ነበር:: ሊቀ ነቢያት ሙሴም ግብጽ ተወልዶ ያደረና የግብጻውያኑን ባህልና ቋንቋ የሚያውቅ ስለነበር ኦሪትን ሲጽፍ ቃሉን ተጠቅሟል::

ከጌታችን ልደት በፊት በሰባተኛው መቶ ክፍለ ዘመን መጽሐፍ ቅዱስን ከዕብራይስጥ ወደ ግሪክ /ፅርዕ/ ቋንቋ የተረጎሙት ሰብአ ሊቃናት ሊቀ ነቢያት ሙሴ «ኩሽ» እያለ የጻፈውን «ኢትዮጵያ» በሚለው ሆሜርና ኤሮዱተስ በተጠቀሙበት ግሪክኛ ስም ተክተውታል:: ይህ ቃል በመጽሐፍ ቅዱስ ከ40 ጊዜ በላይ ተጠቅሷል::

በአሁኑ ወቅት ኢትዮጵያ የሚለው ቃል በምሥራቅ አፍሪካ የምትገኘው 1, 100,000 ስኩዌር ሜትር ያህል ስፋት ያላት ሀገር መጠሪያ ነው::

## 1.2 ኦርቶዶክስ

«ኦርቶዶክስ» የሚለው ቃል ቀጥተኛ /ትክክለኛ/ የሚል ትርጉም ያለው የግሪክ ጥምር ቃል ነው::

ይህንን ቃል ለመጀመሪያ ጊዜ ለቤተ ክርስቲያን ቅጽልነት /ገላጭነት/ የተጠቀሙት በ325 ዓ.ም በኒቅያ /የዛሬይቱ ኢስታንቡል አጠገብ የምትገኝ ከተማ/ የተሰበሰቡት ጳጳሳትና የቤተ ክርስቲያን ሊቃውንት ናቸው:: የጉባዔው መጠራት ምክንያት የነበረው የጌታችን የመድኀኒታችን የኢየሱስ ክርስቶስን የባህርይ አምላክነት የካደው የአርዮስ የምንፍቅና ትምህርት ነበር:: የጉባኤው ታዳሚዎች አርዮስን ተከራክረው ከረቱ በኋላ የክህደት ትምህርቱን አውግዘው፣

የቀደመች እምነታቸውን አጽንተው ሲለያዩ ሃይማኖታቸውን ኦርቶዶክስ ብለዋታል፡፡

ዛሬ ይህንን ስያሜ ኦሬንታል አብያተ ክርስቲያናት /የኢትዮጵያ፣ የግብጽ፣ የሶርያ፣ የህንድ /ማላንካራ/፣ የአርመን እና የኤርትራ/ አብያተ ክርስቲያናት እና ግሪክና ራሽያን የመሳሰሉ የምስራቅ አብያተ ክርስቲያናት ይጠቀሙበታል፡፡

### 1.3 <u>ተዋህዶ</u>

ይህቃል «አንድ መሆን» የሚል ትርጉም ያለው የግእዝ ቃል ነው፡፡ ቃሉ ቤተ ክርስቲያናችን የእግዚአብሔር ልጅ /ቃል/ ሰው መሆንን /ምስጢረ ሥጋዌን/ በተመለከተ ያላትን እምነት የሚገልጽ ነው፡፡

ቤተ ክርስቲያናችን ቅድመ ዓለም የነበረው የእግዚአብሔር ልጅ /ቃል/ አምላካዊ አካልና ባህርይ እና ከእመቤታችን ከቅድስት ደንግል ማርያም የነሳው ሰዋዊ አካሉና ባህርይ ከሁለት አካል አንድ አካልነት፣ ከሁለት ባህርይ አንድ ባህርይ እንደሆነና ከድንግል ማርያም የተወለደው ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ፍጹም አምላክ፣ ፍጹም ሰው ነው ብላ ቤተ ክርስቲያናችን ታምናለች፡፡

### 1.4 <u>ቤተ ክርስቲያን</u>

ይህ ቃል በዋነኝነት በግሪኩ መጽሐፍ ቅዱስ «አክሌስያ» የሚለውን ቃል የሚተካ /የሚወክል/ የግዕዝ ጥምር ቃል ነው፡፡ ትርጉሙም የክርስቲያኖች /የምዕመናን/ አንድነት ማለት ነው፡፡

ከዚህ በተጨማሪ ለአምልትና ለጸሎት የተለየን ሥፍራ፣ የቤተ ክርስቲያንን አስተዳደርና እያንዳንዱን ክርስቲያን ለማመልከት ጥቅም ላይ ይውላል፡፡

## 2. የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን ታሪክ

### 2.1 አምልኮተ እግዚአብሔር

የሰው ልጆች በተለያዩ ዘመናት በሶስት የተለያዩ ሕግጋት እየተመሩ እግዚአብሔርን እንዳመለኩት መጽሐፍ ቅዱስ ይነግረናል፡፡ እነዚህም ህገ ልቡና፣ ህገ ኦሪትና ህገ ወንጌል ናቸው፡፡

ሀ. ህገ ልቡና፡- ህገ ልቡና ለሰው ልጆች የተሰጠ የመጀመሪያው ህግ ነው፡፡ እግዚአብሔር ይህንን ህግ በሰዎች ልቡና /ህሊና/ ላይ ጽፎ፣ አስተዋይ ማድረግ የሚገባቸውን የሚያውቁ አድርጎ ፈጥሯቸዋል፡፡ በዚህ ህግ እየተመሩም ለ4000 ዓመታት ያህል /እስከ 1500 ዓመት ቅ.ልክ ገዳማ/ ድረስ ቆይተዋል፡፡ በዚህ ዘመን ምንም የተጻፈ ህግ አልነበረም፡፡ ይህም ከአዳም እስከ ሙሴ ያለውን ዘመን ያጠቃልላል፡፡

ለ. ህገ ኦሪት፡- የሰው ልጆች በህገ ልቡና እየተመሩ ከቆዩ በኋላ በ1500 ዓመት ቅ.ል.ክ ገዳማ ህዝበ እስራኤል ከግብጽ ባርነት ነጻ ወጥተው እግዚአብሔር ርዕት አድርጎ ለአባታቸው ለአብርሃምና ለልጆቿ ወደ ሰጣት ወደ ከነአን /ፍልስጥኤም/ ምድር እየተጓዙ ሳለ ሁለተኛውን ህግ ማለትም ህገ ኦሪትን በጽሁፍ በሙሴ አማካኝነት ሰጥቷቸዋል፡፡ ይህ ህግ /ህግጋትና ትዕዛዛት/ እንዲሁም ሌሎች ዝርዝር ህጎችን የያዘ ነው፡፡

ከሙሴ እስከ ክርስቶስ መምጣት ድረስ የሰው ልጆች በዚህ ሕግ ተመርተዋል፡፡

ሐ. ህገ ወንጌል፡- የሰው ልጆች በህገ ኦሪት እየተመሩ ለ1500 ዓመታት ከቆዩ በኋላ እግዚአብሔር ዓለሙን ለማዳን የቀጠረው ጊዜ ስለደረሰ ልጁን ልኰ ከእመቤታችን ከቅድስት ድንግል ማርያም ሰው ሆኖ ተወለደ፡፡ /ገላ. 4፥4/ ሰላሳ ሦስት ዓመት ከሦስት ወር በዚህ ምድር በእግረ ሥጋ ተመላለሰ፡፡ በእነዚህ ዓመታት «ለቀደሙት እንዲህ እንደተባለ ሰምታችኋል፣ እኔ ግን እንዲህ አላችኋለሁ...» እያለ የበለጠችውንና ፍጹም የሆነችውን ህገ ወንጌልን ሠራ፡፡ እነሆ

ከዚያ በኋላ ለ2000 ዓመታት ያህል በህገ ወንጌል እየተመራን እግዚአብሔርን አምልከናል፡፡

### 2.2 አምልኮተ እግዚአብሔር በኢትዮጵያ

ሀገራችን ኢትዮጵያ ከላይ በተጠቀሱት ሦስቱም ሕግጋት እግዚአብሔርን አምልካለች፤ አሁንም እያመለከች ነው፡፡

#### 2.2.1 በህገ ልቡና

ኢትዮጵያ በሕገ ልቡና ዘመን ሀገረ እግዚአብሔር ነበረች፡፡ ሌላው ዓለም /ከእስራኤላውያን በቀር/ በአምልኮተ ጣኦት ውስጥ በነበረበት ዘመን የኖኅ ልጆችና የልጅ ልጆች የአባታቸውን እምነት ይዘው በመግባታቸው አገራችን በአምልኮተ እግዚአብሔር ልትታወቅ ችላለች በጥፋት ውኃ ዘመን ከስምንት ቤተ ሰቦቹ ጋር ከሞት ከተረፈው ከጻድቁ ከኖኅ ልጆች ካም የተባለው ወደ አፍሪካ ምድር እንዲመጣና በልጆቹ ጋር አማካኝነት ኢትዮጵያን እንዳቀና ትውፊታዊ መረጃዎች ይጠቁማሉ፡፡

ይህንን አባባል ከሚያረጋግጡልን የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍሎች መካከል የሚከተሉት ይገኙበታል፡-

- ሊቀ ነቢያት ሙሴ ያገባት ሴት /ሲፓራ/ ኢትዮጵያዊት ነች፡፡ /ዘፀ. 12፥15/፡፡ በእስራኤላውያን ሕግ ከአረማውያን ጋር መጋባት ክልክል ነበር፡፡ ስለዚህ ሙሴ ኢትዮጵያዊቷን ያገባው በሕገ ልቡና አምልኮተ እግዚአብሔር ስለምትመስለው ነው፡፡
- ንግስተ ሳባ የሰሎሞንን ጥበብ ለማየት ወደ ኢየሩሳሌም ተጉዛ ነበር፡፡ አየሩሳሌም ደርሳ ንጉሥ ሰሎሞንን ስታገኝ «አንተን የወደደ ከእስራኤልም ዙፋን ያስቀመጠህ አምላክህ እግዚአብሔር የተባረከ ይሁን፡፡» /1ኛ ነገ. 10፥9/ ማለቷ በሀገራችን የነበረውን አምልኮተ እግዚአብሔር የሚያሳይ ነው፡፡

#### 2.2.2 በህገ ኦሪት

ኢትዮጵያ በህገ ልቡና እግዚአብሔርን ስታመልክ ከቆየች በኋላ በ950 ዓመት ቅ.ል. ክ. ገደማ ንግስተ ሳባ የንጉስ ሰሎሞንን ጥበብ ለማየት በሄደችበት

ጊዜ ህገ ኦሪትን ይዛ በመምጣቷና በጉዞዋ ወቅት ከንጉስ ሰሎሞን የጸነሰችው ልጇ ምኒልክ ሲያድግ አባቱን ለመጎብኘት ወደ ኢየሩሳሌም ሄዶ ሳለ ታቦተ ጽዮንን ይዞ በመምጣቱ ኢትዮጵያ ወደ ህገ ኦሪት ተሸጋግራለች፡፡ ይህም ህገ ኦሪትን ለመቀበል ሁለተኛዋ ሀገር ያደርጋታል፡፡ እስከ ጌታችን ልደት ድረስም በዚሁ ህግ ኖራለች፡፡

2.2.3 <u>በህገ ወንጌል /ክርስትና/</u>

ክርስትና እንዴት በ34 ዓ.ም ወደ ኢትዮጵያ እንደገባ የሚያስረዳው የሚከተለው አስደናቂ ታሪክ በሐዋርያት ሥራ መጽሐፍ ላይ ተመዝግቧል፡፡ «የጌታም መልአክ ፊልጶስን ተነስተህ በደቡብ በኩል ከኢየሩሳሌም ወደ ጋዛ ወደሚያወርደው ምድረ በዳ ወደ ሆነ መንገድ ሂድ አለው፡፡ ተነስቶም ሄደ፡፡ እነሆም ሕንደኬ የተባለች የኢትዮጵያ ንግስት አዛዥና ጃንደርባ የነበረ፣ በገንዘቧ ሁሉ የሰለጠነ አንድ የኢትዮጵያ ሰው ሊሳለም ወደ ኢየሩሳሌም መጥቶ ነበር፤ ሲመለስም በሠረገላ ተቀምጦ የነቢዩን የኢሳያይስን መጽሐፍ ያነብ ነበር፡፡ መንፈስም ፊልጶስን ወደዚህ ሠረገላ ቅረብና ተገናኝ አለው» /ሐዋ 8፥26-40/ ከዚህ በኋላ ፊልጶስ ጃንደረባውን ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ አምላክነት እንደስተማረው፣ ውሃ ወዳለበት ሲደርሱም ጃንደረባው «ኢየሱስ ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ እንደሆነ አምናለሁ» ብሎ እምነቱን መስክሮ እንደተጠመቀና ወደ ሃገሩ እንደሄደም ተጽፎአል፡፡

የቤተ ክርስቲያን ታሪክ ጸሐፊዎቹ አውሳብዮስ ዘቂሳርያና ሄሬኔዎስ እንዲሁም ሊቁ ቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ ይህ ጃንደረባ ወደ ኢትዮጵያ መጥቶ ክርስትናን እንደሰበከ ጽፈዋል፡፡ እንግዲህ የክርስትና እምነት ወደ ኢትዮጵያ የገባው በዚህ መልኩ በ34 ዓ.ም ነበር፡፡

ይሁን እንጂ እስከ 4ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ድረስ ግን ክህነት አልመጣም፤ ምስጢራተ ቤተ ክርስቲያንንም /ጥምቀት፣ ቁርባን፣…/ መፈጸም አልተጀመረም ነበር፡፡ በ330 ዓ.ም በአክሱም ቤተ መንግስት ያደገውና በትውልድ ግሪካዊ የሆነው ፍሬምናጦስ በ17ኛው የእስክንድርያ ፓትርያርክ ቅዱስ አትናቴዎስ አማካኝነት ጵጵስናን ተሹሞ ከመጣ በኋላ ግን ምስጢራት መፈጸም ጀምረዋል፡፡

ከዚህ በኋላ በነበሩት ዘመናት የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን ወርቃማና የስኬት ዘመናትን እንዲሁም አሳዛኝና የውድቀትና የጥፋት ዘናትን በማፈራረቅ አሳልፋለች፡፡ ከአራተኛው መቶ ክፍለ ዘመን ጀምሮ እስከ አሁን ድረስ ያለውን የቤተ ክርስቲያኒቱን ታሪክ በአጭሩ ቀጥለን እንመለከታለን፡፡

328-451 ዓ.ም

አባ ሰላማ ከኢትዮጵያን ሊቃውንትና መምህራን ጋር በመሆን ስብከተ ወንጌልን በሁሉም የኢትዮጵያ አካባቢዎች ወደ ምዕራብ እስከ ዛሬዋ ሱዳን ድረስ፣ ወደ ደቡብ እስከ ዛሬዋ ሶማልያ ድረስ ወደ ምስራቅ እስከ ደቡብ አረብያ /የዛሬዋ የመን ድረስ/ አስፋፍተዋል፡፡ በርካታ ቅዱሳት መጻሕፍትም በዚህ ዘመን ወደ ግዕዝ ተተርጉመዋል፡፡

451-632 ዓ.ም

ከ451 ዓ.ም የተደረገውን የኬልቄዶንን ጉባዔ ባልተቀበሉ ኦርቶዶክሳውያን ላይ ካቶሊካውያን መከራ ባፀኑባቸው ጊዜ ፱ቱ ቅዱሳን በስደት ወደ ሃገራችን ገቡ፡፡ እነርሱም በሰሜኑ የኢትዮጵያ ክፍል ወንጌልን ሰበኩ፤ ገዳማዊ ህይወትን አስፋፉ፣ መጻሕፍትንም ከተለያዩ ቋንቋዎች ወደ ግእዝ ተረጓሙ፡፡

በዚሁ ዘመንም ቅዱስ ያሬድ ተነስቶ ቤተ ክርስቲያናችን እስከ ዛሬ ድረስ የምትጠቀምበትን ዜማ እና የዜማ መጻሕፍት ደርሷል፡፡

ከ632-925 ዓ.ም

ይህ ዘመን ከአራተኛው መቶ ክፍለ ዘመን ጀምሮ እያበበ መጥቶ የነበረው ክርስትና በከፍተኛ ሁኔታ በሚከተሉት ሁለት ምክንያቶች ተዳክሟል፡፡

በዐረቢያ ምድር የእስልምና መነሳትና በእስልምና ኀይሎች ምክንያት የኢትዮጵያ የባሕር በሮች መዘንት፤ የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ከሌሎች የክርስትና ዓለም ጋር የነበራት ግንኙነት መዳከም

ዮዲት በተባለች ሴት መሪነት በኢትዮጵያ ውስጥ የነበሩ አይሁዳውያን ተነስተው ክርስቲያኖችን ማሳደዳቸውና መግደላቸው፣ አብያተ ክርስቲያናትንና መጻሕፍትንም ማውደማቸው፡፡

**ከ925-1500 ዓ.ም**

ይህ ዘመን የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን ሐዋርያዊ ተልዕኮ እንዲሁም መንፈሳዊ አገልግሎት ከፍተኛ ደረጃ ላይ ያደረሰበት ዘወን ነው::

አባ ኢየሱስ ሞአ የሐይቅ እስጢፋኖስ ገዳምን መስርተው በገዳሙ ውስጥ በርካታ ደቀመዛሙርትን አስተማሩ:: ከዚህ ገዳም የወጡ በርካታ አባቶች ወደ ተለያዩ አቅጣጫዎች በመሠማራት ወንጌልን ሰበኩ:: ለምሳሌ ያህልም አቡነ ተ/ሃይማኖት ደቡብ ኢትዮጵያን፣ አባ ጊዮርጊስ ቤተ አምሃራን፣ አቡነ እስትንፋሰ ክርስቶስ ዳውንትንና አካባቢውን፣ አቡነ ዜና ማርቆስ መካከለኛው ኢትዮጵያን አስተምረዋል::

እነዚህ አባቶች ደግሞ የተለያዩ ገዳማትን መስርተው ደቀ መዛሙርትን በማፍራታቸው የእነርሱ ደቀመዛሙርትም ወደ ተለያዩ ቦታዎች እየሄዱ ወንጌልን ሰብከዋል፤ ክርስትናንን አስፋፍተዋል:: በሰሜን ክፍል አቡነ መድኃኒነ እግዚእ እና ሰባቱ ክዋክብት በመባል የሚታወቁት ደቀመዛሙርቶቻቸው በትግራይና በጎንደር አካባቢ ክርስትናን አስፋፍተዋል፤ ገዳማትን መስርተዋል::

በዚህም ምክንያት ዘመኑ የቤተ ክርስቲያን መንፈሳዊ ህይወት ከፍተኛ ደረጃ የደረሰበት፣ ነገስታት ሳይቀሩ ለክህነትና ለቅድስና የበቁበት ዘመን ሊሆን ችሏል::

**ከ1500-1585 ዓ.ም**

ይህ ዘመን በተከታታይ በተፈጠሩ /በደረሱ/ ሁኔታዎች ምክንያት ቤተ ክርስቲያን መከራ የተቀበለችበትና የተዳከመችበት ዘመን ነው::

**የአክራሪ እስልምና ወረራ**

በ1500 ዓ.ም አካባቢ በዘመኑ ኀያል በነበረው በቱርክ መንግስት አስታጣቂነት የዘመተው አህመድ ግራኝ በርካታ ክርስቲያኖች ገደለ፤ ብዙዎችን በግዳጅ አሰለመ፣ ካህናትን ጨፈጨፈ፣ እጅግ በጣም ብዙ ገዳማትን፣ አብያተ ክርስቲያናትንና መጻሕፍትን አቃጠለ::

**የካቶሊኮች መምጣት**

የአህመድ ግራኝ ወረራ ሌላ ችግርን ወለደ። በአህመድ ግራኝ ወረራ ጊዜ የኢትዮጵያ መሪ የነበሩት አጼ ልብነ ድንግል ወራሪውን ለመቋቋም የሚሆን ድጋፍ ከፖርቹጋል መንግስት ጠይቀው ነበር። እርዳታው በተለያዩ ምክንያቶች ሲጓተት ከቆየ በኋላ የፖርቱጋል መንግስት ወታደሮች መጥተው በእነርሱ እርዳታ ግራኝ ድል ሆነ።

ይሁን እንጂ ከዚህ በኋላ ከፖርቹጋል መንግስት ወታደሮች ጋር የመጡት የካቶሊክ ቤተ ክርስቲያን መልዕክተኞች «ካቶሊክ የኢትዮጵያ ብሔራዊ ሃይማኖት ይሁን» የሚል ጥያቄ አቀረቡ። ጥያቄው በጊዜው ተቀባይነት ቢያገኝም ከዚያ ቀጥሎ ባሉት ዘመናት ብዙ የካቶሊክ ሚሲዮናውያን ወደ ሃገራችን ለመምጣት አጋጣሚ ተፈጥሮላቸዋል። «መሣሪያና ዕርዳታ እናስመጣላችኋለን»

በማለትም ነገስታቱን ያባብሉ ነበር። በመጨረሻም አጼ ሱስንዮስ የተሰበከላቸውን የሥር መሣርያ ዕርዳታ ለማግኘት ሲሉ የካቶሊክን ዕምነት መቀበላቸውንና አወጁ፤ ህዝቡም በግዴታ የካቶሊክ እምነተን እንዲቀበል ለማድረግ ሞከሩ። በዚህም ምክንያት ጦርነት ተከፍቶ በርካታ ምዕመናን በሰማዕትነት አለቁ። በመጨረሻም አጼ ሱስንዮስ እንደበታቸው ሲዘጋ ለምን ይህ መቅሰፍት እንደደረሰባቸው ያውቃሉና «የካቶሊክ ሃይማኖት ይርከስ፣ ተዋህዶ ትመለስ» ብለው አወጁ። ስልጠናቸውንም ለልጃቸው ለአጼ ፋሲል አስረከቡ።

**ቅብአትና ፀጋ**

አጼ ፋሲል እንደነገሱ ካቶሊካውያንን ከሃገር አባረሩ። የካቶሊውያኑ መሪ የነበረው አልፎንዙ ሜንዴዝ ግን ለሁለት ኢትዮጵያውያን «ቅብአት» እና «ፀጋ» የሚባሉ ሁለት የስህተት ትምህርቶችን ለሁለት ኢትዮጵያውያን አስተምሮ ወጣ። እነዚህ ሁለቱም ቤተ ክርስቲያንን የበለጠ አደከሚት።

**ዘመነ መሣፍንት**

ይህ ዘመን በኢትዮጵያ ጠንካራ ማዕከላዊ አስተዳደር የጠፋበትና ሃገሪቱ ተከፋፍላ በተለያዩ መሳፍንት እጅ የወደቀችበት ዘመን ነው:: ይህ መሆኑ ቤተ ክርስቲያን ማዕከላዊነት ያለው ጠንካራ አገልግሎት እንዳትፈፅምና በእስልምና ወረራ ለተጠቁት ክርስቲያኖች እንዳትደርስ ከማድረጉም በላይ ለካቶሊክ ሚሲዮናውያን ወደ ሃገራችን እንዲገቡ ምቹ ሁኔታን ፈጥሮላቸዋል:: በዚህም ምክንያት ቀድሞ ክርስቲያን የነበሩ በርካታ አካባቢዎች ወደ አረማዊነትና እስልምና ተለውጠዋል::

**የዘመነ መሳፍንት ፍፃሜ**

ከዘመነ መሳፍንት በኋላ /1855-1951/ በካቶሊኮች የተረጨ የቅብዐትና የጸጋ መርዝ ያለ የሌለ ኃይሉ ተሟጦ አለቀ:: የቅብዐትና የጸጋ የክር ክር ዘርን በተዋሕዶ ድል አድራጊነት ተደመደመ:: የኢትዮጵያ ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን መጠነኛ እፎይታ አገኘች:: ከግራኝ አህመድ የጥፋት ወረራ በኋላ እረኛ አጥተው ለብዙ ዘመናት የተቸገሩ ልጆቿን መጠየቅና መፈለግ ጀመረች:: ሐዋርያዊ ተልእኮዋ በመጠኑም ቢሆን ማንሠራራት ጀመረ:: ሆኖም የብዙ ዘመን አረም የወረሰውን ክርስትና ለመፈለግ ቀላል አልነበረም::

ይህንኑ ችግር ቀርፎ የቤተ ክርስቲያ ኒቱን ሐዋርያዊ ተልዕኮ ለማጠናከር በ1921 ዓ.ም አራት ኢትዮጵያ ውያን ካይሮ ላይ ጵጵስና ተሾሙ:: እነ ርሱም:- አቡነ አብርሃም፣ አቡነ ይስሐቅ፣ አቡነ ጴጥሮስ እና አቡነ ሚካኤል ናቸው::

**የካቶሊካውያን እጅ ደግሞ በኢትዮጵያ ላይ መዘርጋቱ**

ካቶሊካውያን በኢትዮጵያ ቤተ ክር ስቲያን ላይ እጃቸውን መዘርጋታቸውን በጽናት ቀጠሉ:: ከዐፄ ሚናስና ከዐፄ ሰሱንዮስ ጀምሮ ኢትዮጵያንና የኢትዮ ጵያን ቤተ ክርስቲያን በሃይማኖት ስብከት ስም ለመያዝና ለማጥፋት ያደረጉት ሁሉ ሙከራ እንደማያዋጣ የተረዱት የሮማ ካቶሊኮች በቀጥታ በጦር ኃይል ዘመቱባት:: ቤተ ክርስቲያኒቱም እነርሱ በጦር ኃይል ተደራጅተው ቢመጡ እርሷ ደግሞ የእግዚአብሔርን የቃል ኪዳን ታቦት ሕግ ይዛ ዐድዋ ላይ በእግዚአብሔር ኃይል ድል አደረገች:: እነርሱ ግን አሁንም አላረፉላትም::

እንደገና በአርባኛ ዓመት ሙሶሎኒ ኢትዮጵያ ሲወር የኢትዮጵያን ቤተ ክር ስቲያን ወደ ካቶሊክ ለመለወጥ ምቹ ጊዜ እንደሆነ በማሰብ የሮማው ጦርነቱን «ቅዱስ ዘመቻ» በማለት የሙሶሎኒን ጦር፣ መድፉንና ታንኩን ባረከ፡፡ ውና የኢ ጣሊያ ጳጳሳት ካርዲናሎች ለጦርነቱ ዕር ዳታ ሰጡ፡፡ በኢትዮጵያ ላይ ለሚደረ ገው ዘመቻ ምእመናኑ ገንዘብ እንዲሰጥ በየሰበካው ቄስ ይታዘዝ ነበር፡፡ ከሙሶ ሎኒ ጎን ተሰልፈው ምክር ይሰጡ የነበ ሩትና ብዙ ካህናትንም ያስፈጁት የወታ ደር ልብስ ለብሰው የሮማ ካቶሊክ ቄሶች ነበሩ፡፡

በዚህም ምክንያት ቤተ ክርስቲያን ከብዙ ጠላቶች እየተከላከለች ያቆየቻቸውን የታ ሪክና የሃይማኖት ቅርሶች ተዘርፈው ተወ ስደው ጦርነቱን ለባረከችው ለቫቲካን ተሰጡ፡፡ በተ.መ.ድ የስታቲስቲክ ክፍል እንደተመዘገበው ሁለት ሺሕ አብያተ ክርስቲያናትና ገዳማት ተቃጥለዋል፡፡ በየአድራባራቱና በየገዳማቱ - በደብረ ሊባኖስ፣ በላሊበላ፣ በአክሱም፣ በጎንደርና በዝቋላ ብዙ ባሕታውን፣ መነኰሳት፣ ካህናትና ምእመናን ለሃይማኖታቸውና ለአገራቸው ተሠውተዋል፡፡ የካቶሊኩ በባረከው መትረየስ ብፁዕ አቡነ ጴጥሮስ እና ብፁዕ አቡነ ሚካኤል ዘጎሬ በግፍ ተገድለዋል፡፡ በቤተክርስቲያን ላይ የደረ ሰው ይህ የካቶሊኮች ከባድ መከራ ማን ሠራራት ጀምሮ በነበረው ሐዋርያዊ ተልእኮ ላይ እንደገና መልሶ ውኃ አፈሰ ሰበት፡፡ ኦርቶዶክሳዊ ያልሆኑ አንዳንድ ካቶሊካዊ ባህሎች ወደ ኢትዮጵያ ገቡ፡፡ ለምሳሌም፡- ኦርቶዶክሳዊ ባህል በሆነው በሁለት ጎንዮሽ በቀለም በሚሣሉ ሥዕሎች ፋንታ ሦስት ጎንዮሽ ሐውልቶችን በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ማቆም፣ የመቃብር ሐው ልት ማነጽና ማስጌጥ፣ ታላላቅ አብያተ ክርስቲያናት ሲታነጹ ደብር ወይም ገዳም በማድረግ ፋንታ «ካቴድራል» እያሉ መሰየም ከቅዳሴ በኋላ በእጅ በመባረክ ፋንታ ጸበል መርጨት መጣ፡፡

### የጣሊያኖች ወረራ ፍጻሜ

ጣሊያኖች ኢትዮጵያን ለቀው ከወጡበት ከ1ሺ.ሕ9?ኝ3-1ሺ.ሕ9?1 ዓ.ም ድረስ ደግሞ በቤተ ክርስቲያን የተወሰነ የማገገም ሁኔታ ታይቷል፡፡ በ1ሺ.ሕ9?3 ዓ.ም የሊቀ ጵጵስናን መዓርግ ከልጆቿ አገኘች፡፡ ብፁዕ አቡነ ባስልዮስ የመጀመሪያው ኢትዮጵያዊ ሊቀ ጳጳስ ተብለው ካይሮ ላይ በብፁዕ ወቅዱስ አቡነ

ዮሳብ ተሾሙ። የሐዋርያዊ አገልግሎት አድማስ መጠነኛ እንቅስቃሴዎች ነበሩ። በካሪቢያን ደሴቶችና በአካባቢያቸው ብዙ ወገኖች ወደ ቤተክርስቶስ መንጋ ተቀላቀሉ። በግእዝ ብቻ የነበሩ መጻሕፍት ወደ አማርኛ እየተተረጎሙ መታተም ጀመሩ። የቤተክርስቲያኒቱ የውጭ ግንኙት በመጠናከሩ ከ451 ዓ.ም ወዲህ በጉባኤ ተገናኝተው የማያውቁት የአምስቱ እኅት አብያተ ክርስተያናት አዲስ አበባ ላይ ጉባኤ አድርገው ግንኙነታቸውን ለማጠናከር ስምምነት ላይ ደርሰው ነበር።

## ኢትዮጵያ መንበረ ፓትርያርክ ያገኘችበት ዘመንና የነበሩት አጠቃላይ ሁኔታዎች

ኢትዮጵያ መንበረ ፓትርያርክ ካገኘችበት 1951 ጀምሮ የደርግ ኮሚኒስታዊ መንግሥት እስከ ተገረሰሰበት 1ሺ.ሕ9?'3 ዓ.ም ድረስ የነበረውን ሁኔታ ደግሞ ለቤተ ክርስቲያን ሐዋርያዊ ተልእኮ አዎንታዊና አሉታዊ ብለን በሁለት ከፍለን ልናያቸው እንችላለን።

በአዎንታዊ ጎኑ:- ኢትዮጵያ ከሊቀ ጵጵስና ወደ ፓትርያርክነት መንበር ከፍ አለች። ብፁዕ አቡነ ባስልዮስ የመጀመ ሪያው የኢትዮጵያ ፓትርያርክ ሆኑ። በዚህም ለብዙ ዘመናት የሕዝቡን ቋንቋ፣ ባህልና ችግር የሚያውቁ የራሷን ልጆች ጵጵስና መሾምና ቅስናና ዲቁናን በየአህጉረ ስብከቱ መስጠት ተቻለ። ይህም ለብዙ ዘመናት በካህናት እጥረት ስትቸገር ለነበረችው ቤተ ክርስቲያን ታላቅ የምሥራች ነበር። ለግብጽ እስላም መሪዎች ጳጳስ እንዲላክ ሲፈለግ ይላክ የነበረው ብዙ ወርቅና የተለያየ እጅ መንሻና ደጅ ጥናት ታሪክ ሆነ። ይህንኑ ተንተርሶ ከላይ የተጀመረው ከአገር ውጭ ያለው እንቅስቃሴ ጠንከር ብሎ በመቀጠል በአሜሪካ፣ በዌስት ኢንዲስና በአውሮ ብዙ አብያተ ክርስቲያናት ተመሠረቱ። ከብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ባስልዮስ ዕረፍት በኋላ በብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ቴዎፍሎስ ዘመነ ፕትርክና የሰበካ መንፈሳዊ ጉባኤ መቋቋሙና ምእመናን በቤተ ክርስቲያኒቱ ጉዳይ ቀጥተኛ ተሳትፎ ማድረግ መጀመራቸውና፣ የሰንበት ት/ቤቶች መቋ ቋምና መደራጀት። የታዩ ከፍተኛ ለው ጦች ነበሩ።

በአሉታዊ ጎኑ ደግሞ ወጣቱ ትውልድ ከዘመናዊ ትምህርት ጎን ለጎን የቤተ ክርስቲያንን ትምህርት የሚያገኝበት መንገድ ካለመኖሩ የተነሣ ለሃይማኖቱ ባዕድ እየሆነ ሄደ፡፡ ይህንን የወጣቱን የባዶነት ክፍተት በዘመኑ በዓለም አቀፍ ደረጃ እንደ አዲስ እየተስፋፉ በነበሩት ርዕዮተ ዓለሞች /ማርክሲዝም፣ ሌኒኒዝም፣ ፕሮ ቴስታንታዊ ተሐድሶ፣ የምዕራባውያን አስተሳሰብ፣ ወዘተ/ እየተሞላ የራሱን ታሪክና ማንነት ባላወቀ መጠን የውጭ ኃይሎች ስለ ራሱ የሚነግሩትን ፕሮፖ ጋንዳ በመጋት ራሱ ለራሱ ጠላት ሆኖ የተነሣበትና «ተማርኩ» የሚለው ክፍል ብዙዎች ቤተ ክርስቲያኒቱን በግልጽ

መቃወም የጀመረበትና ሃይማኖተኛ መሆን እንደ ኋላ ቀርነት እየታየ የመጣበት ነበር አውሮውያን በመሣሪያዎቻቸው በካቶሊካውያንና በፕሮቴስታንት ሚሲዮናውያን አማካኝነት ሕዝቡ የራሱ የሆነ ውን ነገር እንዲጠራጠርና እንዲጠላ የማ ድረግ የአእምሮ አጠባ ዘመቻ በኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ላይ አጧጡፈው ቀጠሉበት፡፡

በተለያዩ ሚሲዮኖችም ቤተ ክርስቲያኒቱን ለማጥቃት ትምህርት ቤቶችንና የሕክምና ተቋማትን የመሳሰሉ ዘመናዊ ተቋማትን ጥግ አድርገው በመነሣታቸው የቤተ ክርስቲያን አባቶች እነዚህን ዘመ ናዊ ተቋማት በጥርጣሬ ዓይን እንዲያዩአቸው ሆነ፤ ወጣቱ ክፍል ቤተ ክር ስቲያን ልታምነው የሚያስቸግር እስኪመስል መድረሱ፣ የትውልድ ክፍተት እንዲፈጠር ምክንያት ነበር፡፡

ይባስ ብሎ በኢትዮጵያ ታሪክ ውስጥ እጅግ በጣም እንግዳና አሳዛኝ የሆነ ክሥተት ተፈጸመ፡- ክሒዶተ እግዚአብሔር በዐዋጅ ተነገረ፡፡ የቤተ ክርስቲያኒቷ ፖትርያርክ የነበሩትን ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ቴዎፍሎስ ተገደሉ፡፡ ቤተክርስቲያን ለሐዋርያዊ አገልግሎትና ለማኅበረሰባዊ ልማት አገልግሎት እንዲውሉ ያፈራቻቸውና ከምእመናን የተሰጧትና ትገለገልባቸው የነበሩት የቤተ ክር ስቲያን ሀብቶች ሙሉ በሙሉ ተወረሱ፡፡ ገዳማት ይተዳደሩባት የነበረው መሬታ ቸው ሙሉ በሙሉ በመወረሱ ያለ ምንም የገቢ ምንጭ ባዶ እጃቸውን ቀሩ፡፡ የአንዳንድ አብያተ ክርስቲያናት ቀጥተኛ መግቢያ በር እየተዘጋ የስርጥ በር

እንዲጠቀሙ ተገደዱ:: በአጠቃላይ በቤተ ክርስቲያን ላይ የነበረው የስነ ልቦናና የሞራል ተጽእኖ ከባድ የነበረበት ዘመን ነበር::

የደርግ ሥርዓት መለወጥን ተከትሎ ከ1ሺ.ሕ9?'3-.?/ እስከ አሁን ድረስ/ ያለውንም በዚሁ መንገድ በአዎንታዊና በአሉታዊ ማየት እንችላለን::

በአዎንታዊ ጎኑ የእምነት ነጻነት መታወጁ፣ የተወረሱ የቤተ ክርስቲያን ንብረቶችና ይዞታዎች መመለስ ፣ መንፈሳዊ የኅትመት ሥራዎች መፈቀዳቸው፣ የሰንበት ትምህርት ቤቶች በየአብያተ ክርስቲያናቱ መቋቋምና መጠናከር፣ በአንዳንድ የከተማና ከተማ ነክ አድባራት ለልማት ሥራዎች የሚውሉ ሕንፃዎች መሠራታቸው፣ «ተማረ» የሚባለው ክፍል በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ተሳትፎ መጀመሩ፣ ሐዋርያዊ አገልግሎት በመጠኑም ቢሆን ማንሰራራት መጀመሩ የሚጠቀሱ መልካም ጅምሮች ናቸው::

ይሁን እንጂ በርካታ ችግሮችም ይታያሉ:: የሐዋርያው ተልዕኮው አድማስና አፈጻጸም የተቀናጀና ስልታዊ አለመሆን፤ የሚዳርጉትን ሐዋርያዊ ተልዕኮዎች ከችግሩ ስፋትና መጠን አንጻር የማይወጣጠኑ መሆናቸው፣ ቤተ ክርስቲያን ለህልውናዋ ሳይቀር አደጋ በነበሩ በብዙ ችግሮችና ውጣ ውረዶች ያሳለፈችና ሁል ጊዜ ደልቷትና ተመችቷት የኖረች ይመስላል ባለፉት ዘመናት ለተፈጠሩ ችግሮች ሁሉ ቤተ ክርስቲያን ተጠያቂ ማድረግ፣ ዘረኝነት /በውስጥም በውጭም/፣ የአክራሪ እስልምና እንቅስቃሴዎች እና አስተዳደራዊ ችግሮች ጥቂቶቹ ናቸው::

ቅድስት ቤተ ክርስቲያን አሁን ያሉትን መልካም ጅምሮች አጠናክራ የተሻለ ሐዋርያዊ አገልግሎት እንድትፈጽምና ወንጌልን ለሁሉም ማድረስ እንድትችል፣ የሚታዩትም ችግሮች እንደቀረፉ ሁላችንም ልንነሳና የየበኩላችንን አስተዋጽኦ ልናበረክት ይገባናል::

## 2.3 ወቅታዊ መረጃዎች

በአሁኑ ወቅት የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን በኢትዮጵያ ውስጥና ከኢትዮጵያ ውጭ የሚኖሩ ___________ ሚሊዮን ያህል ተከታዮች አሏት። ከእነዚህ ውስጥ ___________ ያህሉ ኢትዮጵያዊ ዜግነት የሌላቸውና በተለያዩ የዓለም ክፍሎች የሚኖሩ ናቸው።

የኢ.ኦ.ተ.ቤተ ክርስቲያን በሃገር ውስጥ _______ በውጭ ሀገር ደግሞ______ ሃገረ ስብከቶች[1] አቋቁማ የእግዚአብሔርን መንግስት እየሰበከች ትገኛለች።

[1] ሐገረ ስብከት ማለት በአንድ ሊቀ ጳጳስ የሚመራ የአገልግሎት ክልል /መዋቅር/ ማለት ነው።

# 3. የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን መሠረተ እምነት

## 3.1 የአስተምህሮዎቻችን ምንጮች

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን አስተምህሮ ምንጮች ሦስት ናቸው፡፡ እነዚህም፡-

### ሀ. <u>ቅዱሳት መጻሕፍት</u>

አምላካችን እግዚአብሔር በየዘመናቱ የተለያዩ ሰዎችን እያስነሳ ለሰው ልጅ መማሪያ የሚሆኑ መጻሕፍትን አስጽፏል፡፡ ከእነዚህ መጻሕፍት መካከል 46 የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት /ከሕገ ወንጌል መሠራት በፊት የተጻፉ/ እና 35 የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት /ከጌታችን መወለድ በኋላ የተጻፉ/ ተለይተው አሥራው መጻሕፍት ይባላሉ፡፡ እነዚህም በአንድ በላይ ሲጠረዙ «መጽሐፍ ቅዱስ» ተብለው ይጠራሉ፡፡

ከእነዚህ /ከአሥራው መጻሕፍት/ ውጪ የሆኑት ሌሎቹ ደግሞ አዋልድ መጻሕፍት ይባላሉ፡፡ እነዚህ መጻሕፍት የአሥራው መጻሕፍትን ለማብራራት፣ በተለያዩ ዘመናት ለነበሩ ችግሮች መፍትሄ ለመስጠትና፣ አሥራው መጻሕፍት ከተጻፈበት ዘመን በኋላ የተደረጉ ነገሮችን ለመመዝገብ፣ ለጸሎትና ለምሥጋና እና ለመሳሰሉት አገልግሎቶች በተለያዩ ጊዜያት /ዘመናት/ የተጻፉ ናቸው፡፡

### ለ. የጉባኤያት ውሳኔዎች

በቅዱሳን ሐዋርያት እግር የተተኩ የቤተ ክርስቲያን አባቶችና መሪዎች /ጳጳሳት/ በቤተ ክርስቲያን የተፈጠሩ ችግሮችን ለመፍታት፣ የምንፍቅና አስተምህሮዎችንና ከክህደታቸው አልመለስ ያሉ መናፍቃንን ለማውገዝና ትክክለኛውን የቤተ ክርስቲያን አስተምህሮ ለማጽናት በተለያዩ ጊዜያት ጉባኤያትን አድርገዋል፡፡

የኢ.ኦ.ተ. ቤተ ክርስቲያን ሦስት ዓለም አቀፍ የቤተ ክርስቲያን ጉባኤያትንና ውሳኔዎቻቸውን ትቀበላለች።

እነዚህም በ325 ዓ.ም /እ.ኤ.አ/ የተደረገው የኒቅያ ጉባኤ፣ በ381 ዓ.ም /እ.ኤ.አ/ የተደረገው የቁስጥንጥንያ ጉባኤ እና በ431 ዓ.ም /እ.ኤ.አ/ የተደረገው የአፌሶን ጉባኤ ናቸው።

## ሐ. ሐዋርያዊ ትውፊት

ትውፊት የሚለው ቃል «አወፈየ /ሰጠ/» ከሚለው የግእዝ ቃል /ግስ/ የተገኘ ቃል ሲሆን የተሰጠ /የተቀበሉት/ የሚል ትርጉም አለው። ስለዚህ ሐዋርያዊ ትውፊት ማለት ከሐዋርያት ጀምሮ በቃል፣ በጽሑፍና በተግባር ሲፈጸም በመመልከት ሲወርድ ሲዋረድ ከእኛ ዘንድ የደረሰ የቤተ ክርስቲያን ትምህርት እና ሥርዓት ማለት ነው።

ሐዋርያትና ሌሎቹ የጌታችን ደቀመዛሙርት ወንጌልን መጀመሪያ ያስተምሩ የነበሩት በቃል ነበር። በኋላ ግን ትምህርቱ እንዳይጠፋ በማለት በጽሑፍ ጽፈውታል። ከጻፏቸውም ነገሮች አብዛኞቹ ባለን መጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ይገኛሉ። ይሁን እንጂ ያልተጻፉ ብዙ ነገር እንዳሉና፣ ከጽሑፋቸውም ውጪ በቃልና በተግባር ያስተማሩት ብዙ ነገር እንዳለ ራሳቸው ጽፈዋል።

«ጌታችን ኢየሱስም ያደረገው ብዙ ሌላ ነገር ደግሞ አለ፤ ሁሉ በእያንዳንዱ ቢጻፍ ለተጻፉት መጻሕፍት ዓለም ራሱ ባልበቃቸው ነበር» /ዮሐ. 21፥25/

«በቃላችንም ቢሆን ወይም በመልእክታችን የተማራችሁትን ወግ ያዙ» /2ኛ ተሰ 2፥15/

እነዚህ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ያልተካተቱ የቃል፣ የጽሑፍና የተግባር ትምህርቶች ሲወርዱ ሲዋረዱ ከእኛ ዘንድ ደርሰዋል። እኛም ልክ እንደ መጽሐፍ ቅዱስ ከእውነተኛ ምንጭ ከጌታና ከሐዋርያት ጀምሮ በመንፈስ ቅዱስ አማካኝነት የመጡ የተቀደሱ ውርሶች ስለሆኑ እንቀበላ፤ እንመራባቸዋለን።

### 3.2 **ነገረ ድኅነት**

ነገረ ድኅነት ሁለት ዐበይት ጉዳዮች የሚዳስሱበት ትምህርት ነው፡፡ እነዚህም፦

ሀ. ፈጣሪያቸውን በድለው የሞት ፍርድ ተፈረደባቸው የነበሩ አዳምና ሔዋን እና የእነርሱ ኀጢአት በዘር እየተላለፈባቸው በዲያብሎስ አገዛዝ ሥር እና በሲኦል ቅጣት ውስጥ ሥር የነበሩት ሰዎች እንዴት ዳኑ?

ለ. ዛሬስ እኛ መዳን የምንችለውን እንዴት ነው?

እያንዳንቸውን በአጭሩ እንመለከታቸዋለን?

#### 3.2.1 **አዳምና ልጆቹ እንዴት ዳኑ?**

አምላካችን እግዚአብሔር የሰው ልጆችን /አዳምና ሔዋንን/ ከሌሎቹ ፍጥረታት ይልቅ አክብሮ ፈጥሮአቸዋል፡፡ ይህንንም የሚከተሉት ነጥቦች ያስረዱናል፦ /ዘፍ. 1፥26-28/

- ከሌሎቹ ፍጥረታት ሁሉ ለይቶ የሰው ልጅን በአምሳሉና በአርአያው ፈጥሮታል፡፡
- ሌሎች ፍጥረታት ሁሉ ከእርሱ በታች እንዲሆኑ እንዲገዛቸው፣ አንዳንዳቸው እንዲያስተዳድራቸው የጸጋ አምላክነት ሰጥቶ ሾሞታል፡፡

አምላካችን አዳምን በዚህ መልኩ ፈጥሮ በገነት አስቀመጠው፡፡ በገነትም ሲኖር አንዲት ህግ ሰጠው «በገነት ካለው ዛፍ ሁሉ ትበላለህ፣ ነገር ግን መልካምን እና ክፉን ከሚያስታውቀው ዛፍ አትብላ፣ ከእርሱ በበላህ ቀን ሞትን ትበላለህና፣ /ዘፍ. 2፥17/ አለው፡፡

አዳም ይህንን ህግ አክብሮ ለሰባት ዓመት ያህል በገነት በሰላምና በደስታ ኖረ፡፡

ከዚህ በኋላ ዲያብሎስ /ሰይጣን/ በእባብ አድሮ እንዲህ የሚል የሀሰት ምክር መከራቸው፦ «ዕፀ በለስን ብትበሉ ሞትን አትሞቱም አምላክ ትሆናላችሁ እንጂ፡፡» /ዘፍ. 3፥5/[2]

---

[2] ዲያብሎስ ይህንን ያደረገው እርሱ በትዕቢት አምላክ ነኝ በማለት ያጣትን ድንቅ ሥፍራ ኢየሩሳሌም ሰማያት ለአዳም ስለተሰጠች ከፍተኛ ቅንአት ስላደረበት አዳምን ለመጣል አስቦ ነው፡፡ ዛሬም የሚፈታተነን ለዚሁ ነው፡፡

አዳምና ሔዋንም የእባብን /ዲያብሎስን/ ምክር ሰምተው ዕፀ በለስን በሉ፡፡ ይህንን በማድረጋቸውም ሁለት ዐበይት በደሎችን ፈጽመዋል፡፡ የመጀመሪያው አትብሉ የተባሉትን በልተው ህግ መተላለፋቸው ሲሆን ሁለተኛው ደግሞ አምላክነትን መመኘታቸው ነው፡፡ በዚህም ምክንያት አስቀድሞ በተነገራቸው መሠረት የሞት ፍርድ ተፈረደባቸው፡፡ በተድላና በደስታ ከሚኖሩባት ገነትም ወጥተው ወደ ምድረ ይፋድ ወረዱ፡፡ በዚህ ፍርድ ምክንያት አዳም ሶስት ዋና ዋና ነገሮችን አጥቷል፡፡ እነርሱም፡-

1. ከእግዚአብሔር ጋር የነበረው የአባትነትና የልጅነት ግንኙነት በተፈጠ ረው የኃጢአት ግድግዳ ምክንያት ተቋርጧል፡፡

2. ዘለዓለማዊነቱን አጥቷል፡፡ አዳም የተሰጠውን ህግ ጠብቆ ቢኖር ኖሮ 1000 ዓመት በገነት ኑሮ፣ ዕፀ ሕይወትን በልቶ ኢየሩሳሌም ሰማያዊት ገብቶ ለዘለዓለም ይኖር ነበር፡፡ አሁን ግን መዋቲ ሆነ፡፡

3. በገነት ይኖረው ከነበረው ኑሮ በተለየ ሁኔታ በዲያብሎስ አገዛዝ ሥር ሆኖ ችግርን፣ መከራንና ድካም የበዛበት ሕይወት መኖር ጀምሯል፡፡

በዚህ ምክንያት አዳም አምርሮ አልቅሶ፤ ንስሐ ገባ፤ አምላኩን ይቅርታ ጠ የቀ፡፡ እግዚአብሔርም ምህረት የባህርይው ነውና አምላክ ለመሆን በማሰቡ በጠ ላትነት ተነስቶበት የነበረውን አዳምን ይቅር ሊለው ወደደ፡፡

በዚህም መሠረት «ከልጅ ልጅህ ተወልጄ፣ ዕዳህን ከፍየ አድንሃለሁ፡፡» የሚል ተስፋ ሰጠው፡፡

የዘመኑ ፍጻሜ ሲደርስም እግዚአብሔር /የእግዚአብሔር ልጅ /ቃል// ከሰማየ ሰማያት ወርዶ በእመቤታችን በቅድስት ድንግል ማርያም ማኅጸን ተጸንሶ፣ ሰው ሁኖ፣ ተወልዶ፣ ተሰቅሎ፣ ሞቶ አዳነው፡፡ በዚህ በማዳኑ ሥራም አዳም አጥቷቸው የነበሩትን መሠረታዊ ነገሮች ሁሉ መልሶለታል፡፡ ማለትም፡-

1. ምንም ኀጢአት ሳይኖርበት በግፍ ተይዞ፣ በግፍ ተከሶ፣ በግፍ በመሞቱ የአዳምን የኀጢአት ዕዳ በሞቱ ከፍሎ፣ በእግዚአብሔርና በሰው መካከል የነበረውን የበደል ግድግዳ አፍርሶ ቀድሞ የነበረውን ወዳጅነት አድሷል፡፡ አዳምንና ልጆቹን ከእግዚአብሔር /ከራሱ/ ጋር አስታርቋል፡፡ ለ5,500 ዘመናት በሲኦል ሲሰቃዩ የነበሩ ነፍሳትንም ወደ ገነት አስገብቷቸዋል፡፡

2. በትንሳኤው ሞትን ድል አድርጎ በሰው ልጆች ላይ የነበረውን ስልጣን አሳጥቶታል:: የሰው ልጆችም ሞተን እንዳንቀር አድርጎናል::

3. ዲያብሎስን ድል አድርጎ እኛን በእርሱ ከመገዛት ነጻ አውጥቶናል:: በዘመነ ብሉይ የነበሩ ሰዎች ይኖሩ ከነበረው የመከራና የሰቆቃ ሕይወትም ነጻ አድርጎናል::

በበደላቸው ምክንያት ሞት ተፈርዶባቸው በመከራና በዳይን የነበሩት አዳምና ልጆቹ የዳኑት በዚህ መልኩ ነው::

3.2.2 **እኛ ዛሬ የምንድነው እንዴት ነው?**

በብሉይ ኪዳን ዘመን የነበሩ ሰዎች በዘር የሚወርሱት የአዳም በደል ስለነበር ምንም አይነት መልካም ሥራ ቢሠሩ ወደ ገነት የመግባት እድል አልነበራቸውም:: ነቢያቱም ይህንን «ጽድቃችን እንደ መርገም ጨርቅ ሆነ::» በማለት ገልጸውታል::

በጌታችን በመድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የአዳምን በደል ዋና በሞቱ ከከፈለና ዓለም ከእግዚአብሔር ጋር ከታረቀ በኋላ የምንኖር ሰዎች ግን በዚህ በአዳም በደል አንጠየቅም:: የእያንዳንዱ ሰው ድኅነት በራሱ እምነትና ምግባር ላይ የተመሰረተ ነው::

ዛሬ አንድ ሰው ለመዳን፣ መንግስተ ሰማያትን ለመውረስና የዘለዓለም ሕይወት ባለቤት ለመሆን ሦስት መሠረታዊ ነገሮችን አሟልቶ መገኘት ጥኖርበታል:: እነዚህም:-

1. እምነት:- የእግዚአብሔርን አምላክነትና ፈጣሪነት፣ የጌታችንን የመድኀኒታችንን የኢየሱስ ክርስቶስን የእግዚአብሔር ልጅነትና ተሰቅሎና ሞቶ ይህንን ዓለም ማዳንና በሚቀጥለው ክፍል የምንመለከታቸውን የቅድስት ቤተ ክርስቲያንን መሠረተ እምነቶች ማመን አለበት::

- «ያለ እምነት እግዚአብሔርን ደስ ማሰኘት አይቻልም» /ዕብ. 11÷/
- «ያመነ የተጠመቀ ይድናል:: ያላመነ ግን ይፈረድበታል» /ማር.16÷16/

2. ምስጢራትን መፈጸም፡- ካመነ በኋላ ለመዳን የግድ መጠመቅ፣ የጌታችንን ቅዱስ ሥጋውንና ክቡር ደሙን መቀበል፣ ሲበድል /ኀጢአት ሲሠራ/ ንስሐ መግባትና ሌሎች ምስጢራተ ቤተ ክርስቲያን መፈጸም አለበት፡፡

«ሰው ከውሃና ከመንፈስ ካልተወለደ ወደ እግዚአብሔር መንግስት አይገባም» /ዮሐ. 3፥/

«ሥጋዬን ያልበላ ደሜን ያልጠጣ የዘላለም ህይወት የለውም» /ዮሐ. 6፥54/

3. ምግባር፡- ያመነ እና ምስጢራትን የፈጸመ ሰው ለመዳን እምነቱን እና በምሥጢራቱ አማካኝነት ያገኘውን ጸጋ በመልካም ሥራ /ምግባር/ መግለጥ /መተርጎም/ አለበት፡፡

መልካም ምግባር ማለትም ከኀጢአት መራቅ፣ እግዚአብሔር ለሙሴ የሰጣቸውን አሠርቱን /ሕግጋት/ ትዕዛዛትና ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ እነዚህን ሕግጋት ያጸናባቸውን 6ቱን ቃላተ ወንጌልና /ማቴ. 5፥17-40/፣ አሥሩን ብጹአን /ማቴ. 5፥1-17/ መፈጸም፤ ጌታችን ዳግም ለፍርድ ሲመጣ ለምንጠይቃቸው 6 የምግባር ጥያቄዎች /ማቴ. 25፥31-46/ ተግባራዊ መልስ ማዘጋጀት፣ ቅዱስ ጳውሎስ ለገላትያ ክርስቲያኖች በጻፈው መልዕክቱ የዘረዘራቸውን የመንፈስ ፍሬዎች /ገላ. 5፥22-24/ አፍርቶ መገኘትና እነዚህን የመሳሰሉ ነገሮች ናቸው፡፡

እነዚህ ሦስት ለድኅነት አስፈላጊ የሆኑ ነገሮች ማሟላት ለመቻል /ማለትም በእምነት ለመጠንከር፣ ወደ ምስጢራተ ቤተ ክርስቲያን ለመቅረብ እና የመልካም ምግባር ባለቤት ለመሆን/ አንድ የቤተ ክርስቲያን አባል የሆነ ክርስቲያንም ሆነ አባል ለመሆን በዝግጅት ላይ ያለ ሰው የሚከተሉትን መፈጸም እንዳለበት ቤተ ክርስቲያናችን ታስተምራለች፡፡

- የእግዚአብሔርን ቃል መማርና ማወቅ፡- የእግዚአብሔር ፈቃድ ምን እንደሆነና ምን ማድረግ እንዳለብን ለማወቅ፣ ያንንም እንዴት ማድረግ እንደምንችል ለመረዳት ቅዱሳት መጻሕፍትን በማንበብና ወደ መምህራን በመቅረብ ቃሉን መማር አለብን፡፡

- መጸለይ፡- መጸለይ ማለት ከእግዚአብሔር ጋር በተመስጦ መነጋገር፣ ላደረገልን ነገር ማመስገንና፣ የምንፈልገውን ነገር መለመን፣ እምነታችንን መግለጥ ማለት ነው፡፡ ጸሎት በህብረትም በግልም ይፈጸማል፡፡
- መጾም፡- መጾም ማለት ለሥጋ የሚመቹ ምግቦችን፣ /የእንስሳት ውጤቶችን/ መጠጦችንና ሌሎች ነገሮችን በፈቃድ መተው ማለት ነው፡፡ ዓላማውም የሥጋን ኀይል አድክሞ ከኀጢአት ሥራዎች ማራቅና ሥጋን ለነፍስ ማስገዛት ነው፡፡
- መስገድ፡- ከወገብ እያጎነበሱ ወይም መሬት እየወደቁ የሚፈጽሙት ተግባርና እንቅስቃሴ ነው፡፡ ዓላማውም ለእግዚአብሔር ፍጹም መገዛትን /ፍጹም አምልኮትን/ መግለጥና ሥጋን ማድከም ነው፡፡
- ምፅዋት፡- ለራስ የሆነን ነገር /ገንዘብ፣ ምግብ፣ ልብስ፣…/ ለሌሎች ማካፈል ማለት ነው፡፡
- ማገልገል፡- ያወቁትን ለሌሎች ማሳወቅ፣ ሌሎችን ወደ ቤተ ክርስቲያንና መንፈሳዊነት ማምጣት ማለት ነው፡፡

እነዚህን ነገሮች መፈጸማቸው የድኅነትን አክሊል ለመቀዳጀት ብቁ እና የተገባን ያደርገናል ማለት ግን አይደለም፡፡ ምክንያቱም ምንም ያህል እምነት ቢኖረን፣ ምንም ዓይነት ጽድቅ /ምግባር/ ብንሠራ የእምነታችንና የጽድቃችን ዋጋ ከመንግስተ ሰማያት ዋጋ ጋር ሊተካከል አይችልም፡፡ ስለዚህ ድኅነት እግዚአብሔር በቸርነቱና ለሰው ልጆች ባለው ፍቅር የሚሰጠን ስጦታ /ጸጋ/ ነው፡፡

### 3.3. አምስቱ አዕማደ ምስጢር

«አምድ» ማለት «ምሰሶ» ማለት ሲሆን «አዕማድ» ማለት ደግሞ ምሰሶዎች ማለት ነው፡፡ አዕማደ ምስጢር ማለት ደግሞ «የምስጢር ምሰሶዎች» ማለት ነው፡፡

አምስቱ አዕማደ ምስጢር የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን መሠረታዊ የሆኑ የሃይማኖት አስተምህሮዎች የሚገለጡባቸው አምስት ርዕሶች ናቸው፡፡ እነዚህም ምስጢረ ሥላሴ፣ ምስጢረ ሥጋዌ፣ ምስጢረ ጥምቀት፣ ምስጢረ ቁርባንና ምስጢረ ትንሣኤ ሙታን ናቸው፡፡

አዕማድ/ምሰሶዎች/ የተባሉት ምሰሶዎች ለአንድ ቤት መቆም ወሳኝ እንደሆኑት ሁሉ እነዚህም ወሳኝ የቅድስት ቤተክርስቲያን አስተምህሮዎች በመሆናቸው ነው።

ምስጢር የተባሉት ደግሞ በጣም ረቂቅና በሰው ልጆች ሕሊና መርምሮ ሙሉ ለሙሉ ለመረዳት ከባድ ስለሆኑ ነው። ቀጥለን እያንዳንዳቸውን በአጭር፣ በአጭሩ እንመለከታለን።

### 3.3.1 ምሥጢረ ሥላሴ

«ሥላሴ» የሚለው ቃል ሦስትነት የሚል ትርጉም ያለው የግእዝ ቃል ነው። ምስጢረ ሥላሴ የእግዚአብሔርን አንድነትና ሦስትነት የምንማርበት የትምህርት ክፍል ነው። የምናመልከው አንድ አምላክ በሦስት አካላት እንዳለ ለአበው፣ለነቢያትና ለሐዋርያት ተገልጧል። ስለዚህ አምላካችንን ቅድስት ሥላሴ እንለዋለን። ትርጉሙም «ልዩ ሦስትነት» ማለት ነው። «ልዩ» መባሉም ቀጥለን እንደምንመለከተው ሦስት ሲሆን አንድ፤ አንድ ሲሆን ሦስት ስለሆነ ነው።

*የሥላሴ ሦስትነት*

የሥላሴ ሦስትነት በአካል፣ በስምና በግብር ነው። እያንዳንዳቸውን በዝርዝር እንመለከታለን።

*የስም ሦስትነት*

እነዚህ ሦስት አካላት የየራሳቸው ልዩ ስም አላቸው። አብ፣ወልድ፣መንፈስ ቅዱስ ይባላሉ። አንዳቸው በሌላው ስም አይጠሩበትም። ይህ ስማቸው ቀጥሎ እንደምንመለከተው ግብራቸውን የሚገልጥ ነው።

*የግብር ሦስትነት*

በግብር አብ ወላዲ፣ አሥራጺ/አስገኚ/ ወይም መገኛ ነው። ወልድ ደግሞ ተወላዲ /ከአብ የተገኘ/፣ መንፈስ ቅዱስም ሠራጺ /ከአብ የወጣ/ የተገኘ/ ነው።

«ወልድና መንፈስ ቅዱስ ከአብ ተገኙ፣ ወጡ ሲባል መገኘታቸው /መውጣታቸው/ የፀሐይ ብርሃንና ሙቀት ሁለቱም ከክበቡ ባለመቀዳደም አንድ ጊዜ ተገኙ እንደማለት ያለ እንጂ እንደ ሥጋ ልደት ሕገ ሰብን አይከተልም አይደለም። ስለዚህ በሥጋ ልደት አባት ልጁን እንደሚቀድመውና እንደሚበልጠው አብ ከወልድና ከመንፈስ ቅዱስ አይበልጥም፤ እነርሱም ከአብ አያንሱም። በሥላሴ ዘንድ መቀዳደምም መበላለጥም የለም።

*የአካል ሦስትነት*

የአካል ሦስትነት ማለት ሦስቱ አካላት እያንዳንዳቸው ፍጹም አካል አላቸው ማለት ነው። ይህ አካል ተጨባጭ ወይም ቁሳዊ አካል አይደለም። መንፈሳዊ አካል ነው። ለምሳሌ ነፋስ አካላዊ ነው፤ ልንጨብጠውና ልንዳስሰው ልናየውም ግን አንችልም። ባለመታየቱ ግን የለም ልንለው አንችልም። ባሕር ሲያናውጽ፣ ዛፍ ሲያወዛውዝ ግን በሥራው መኖሩን እናያለን። ከነፋስ ደግሞ የሰው ነፍስ ትረቃለች። ከሰው ነፍስም መላእክት ይረቃሉ። እነዚህ ሁሉ የምናውቃቸው ረቂቃን አካላት ናቸው። የዚህ ሁሉ ፈጣሪ እግዚአብሔር ደግሞ ፍጹም መንፈስ ስለሆነ በማይነገር መጠን ረቂቅ ነው። ይህ ረቂቅ አካል የሌለበት ቦታ የለም። በምድርም፣በሰማይም፣በአየርም፣በማንኛውም ቁስ አካል ሁሉ ይገኛል። በሁሉ የመላ ነው።

*የሥላሴ አንድነት*

ሦስቱ አካላት አብ ወልድና መንፈስ ቅዱስ በባሕርይ፣ በህልውና እና በመለኮት አንድ ናቸው።

በባሕርይ አንድ ናቸው ስንል ሦስቱ አካላት በዘለዓለማዊነት፣ ሁሉን ቻይነት፣ምሉዕነት፣ረቂቅነትና በመሳሰሉት ነገሮች አንድ ናቸው፤ እነዚህ የሦስቱም አካላት ባሕርይ ናቸው ማለት ነው።

ሕልውና ማለት አኗኗር ማለት ነው። በህልውና አንድ ናቸው ስንል አንዳቸው በአንዳቸው ውስጥ ይኖራሉ ማለታችን ነው። አብ በወልድና በመንፈስ

ቅዱስ ውስጥ ህልው ነው /ይኖራል/ ፤ወልድም በአብና በመንፈስ ቅዱስ ውስጥ ህልው ነው፤ መንፈስ ቅዱስም በአብና በወልድ ውስጥ ህልው ነው::

መለኮት ማለት ገዢነት/መግዛት/ ማለት ነው:: በመለኮት አንድ ናቸው ስንል በመፍጠር በመስጠት፣ በመንሳት፣ በማዳን፣ በመግደል፣ በማጽደቅ፣ በመኮነን ይህንን በመሳለው ሁሉ አንድ ናቸው ማለት ነው::

## 3.3.2 ምሥጢረ ሥጋዌ

«ሥጋዌ» የሚለው ቃል «ሥጋ መሆን»፣ «ሥጋነት» የሚል ትርጉም ያለው የግእዝ ቃል ነው:: ምስጢረ ሥጋዌ ደግሞ ከሦስቱ አካላት አንዱ አካል፤ እግዚአብሔር ወልድ፣ አዳምን ለማዳን ከእመቤታችን ከቅድስት ድንግል ማርያም ከሥጋዋ ሥጋ ከነፍሷ ነፍስ ነሥቶ ሰው መሆኑን የምንማርበት ትምህርት ነው::

«ነገረ ድኅነት» በሚለው ክፍል ላይ እንደተመለከትነው አምላካችን እግዚአብሔር ከልጅ ልጁ ተወልዶ እንደሚያድነው በድሎ ለወደቀው ለአዳም ተስፋ ሰጥቶት ነበር:: የዘመኑ ፍጻሜ ሲደርስ እግዚአብሔር ወልድ ከሰማየ ሰማያት ወርዶ በእመቤታችን ማህጸን አድሮ ከሥጋዋ ሥጋ ከነፍሷ ነፍስ ነሥቶ ሰው ሁኖ ተወልዷል:: በሥጋ ሲወለድም ኢየሱስ፣አማኑኤል፣ ክርስቶስ እና በመሳሰሉት የሥጋዌ /የሰውነት/ ስሞች ተጠርቷል::

አምላክ ሰው ሆነ ሲባል መለኮታዊ አካልና ሥጋዊ አካል፣ መለኮታዊ ባሕርይና ሥጋዊ ባሕርይ ተዋሐዱ /አንድ ሆኑ/ ማለት ነው:: ውሕደቱም በተአቅቦ ነው:: ማለትም ሁለቱ ባሕርያትና አካላት እርስ በርሳቸው አልተጣ ፋፉም፤ ጌታችን አምላካችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ፍጹም ሰው ፍጹም አምላክ ነው::

ከምስጢረ ሥጋዌ ጋር ተያይዞ የጌታችንና የእምላካችን የመድኃኒታችን የኢየሱስ ክርስቶስ እናት የእመቤታችን የቅድስት ድንግል ማርያም ነገርም መነሣት ይኖርበታል::

እመቤታችን ጌታን ከመጽነሷ በፊት፣ በጸነሰችው ጊዜ፣ ከጸነሰችው በኋላ፣ እንዲሁም ከመውለዷ በፊት፣ በወለደችው ጊዜና ከወለደችው በኋላ በሥጋዋም በነፍስም፣ በሕሊናዋም ንጽሕትና ድንግል ነች። የባሕርይ አምላክ የሆነውን እግዚአብሔር ወልድን /ጌታችንን/ በሥጋ በመውለዷ ወላዲተ አምላክ ትባላለች። ክብሯም ከፍጥረታት ሁሉ በላይ ነው።

3.3.3 **ምሥጢረ ጥምቀት**

አዳም በበደለ ጊዜ ከደረሱበት ችግሮች አንዱ የእግዚአብሔርን ልጅነት ማጣት ነበር። ምሥጢረ ጥምቀት ይህንን ያጣነውን ልጅነታችንን መልሰን የምናገኝበት መንገድ ነው።

ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በዮርዳኖስ ወንዝ በቅዱስ ዮሐንስ መጥምቅ እጅ በመጠመቅ ምሥጢረ ጥምቀትን መሥርቶልናል።

ጌታችን በጥምቀት የእግዚአብሔር ልጅነት እንደሚገኝና ይህም ለድኅነት የግድ አስፈላጊ እንደሆነ «ሰው ከውሃና ከመንፈስ ካልተወለደ ወደ እግዚአብሔር መንግሥት አይገባም።» በማለት ኒቆዲሞስ በተባለ ደቀመዝሙሩ አማካኝነት አስተምሮናል።

ይህንን ልጅነትን የሚያሰጥ የጥምቀት ውሃ ደግሞ ጌታችን በዕለተ አርብ ተሰቅሎ ሰጥቶናል። ጌታ በመስቀል ተሰቅሎ ሳለ ቅድስት ነፍሱ ከክቡር ሥጋው ከተለየች በኋላ ለንጊኖስ የተባለ ወታደር ጎኑን በጦር ሲወጋው ንጹሕ ውኃና ደም ሳይቀላቀል ፈስሷል። ይህ ተጠምቀንበት ልጅነት የሚያሰጠን ውኃ ነው።

በመጨረሻም ጌታችን «እንግዲህ ሂዱና አሕዛብን በአብ፣በወልድና በመንፈስ ቅዱስ ስም አጥምቋቸው።» የሚል ትእዛዝ ለሐዋርያት ሰጥቷቸዋል።

በዚህም መሠረት ካህናት ለጥምቀት በተዘጋጀ ውኃ ላይ ጸሎት ሲጸልዩ ውኃው በዕለተ አርብ ከጌታችን ጎን ወደ ፈሰሰው ውኃነት ይቀየራል። በዚህ ማየ ገቦም አበው ካህናት በአብ በወልድና በመንፈስ ቅዱስ ስም እያጠመቁ

የእግዚአብሔር ልጅነትን ያሰጣሉ። እኛም በጥምቀቱ ምክንያት የሥላሴ ልጆች የመንግሥተ ሰማይ እድምተኞች እንሆናለን።

3.3.4 **ምሥጢረ ቁርባን**

ምሥጢረ ቁርባን ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በልተነው የዘለዓለም ሕይወትን እናገኝ ዘንድ ቅዱስ ሥጋውን ቁርሶ፣ጠጥተነው የዘለዓለም ሕይወትን እናገኝ ዘንድም ክቡር ደሙን አፍስሶ እንደሰጠን የምንማርበት ትምህርት ክፍል ነው።

ጌታችን በዚህ ዓለም እየተዘዋወረ በሚያስተምርበት ወቅት እርሱ ከሰማይ የወረደ ሕይወትን የሚሰጥ  እንጀራ መሆኑንና የዘለዓለም ሕይወትን ለማግኘት የእርሱን ሥጋ መብላትና የእርሱን ደም መጠጣት የግድ እንደሆነ ለደቀመዛሙርቱና ለሚከተሉት ሰዎች ያስተምራቸው ነበር።

«የሕይወት እንጀራ እኔ ነኝ፤ ወደ እኔ የሚመጣ ከቶ አይራብም በእኔ የሚያምን ሁል ጊዜ ከቶ አይጠማም።. . . ሰው ከእርሱ በልቶ እንዳይሞት ከሰማይ አሁን የወረደ እንጀራ ይህ ነው። ከሰማይ የወረደ ሕያው እንጀራ እኔ ነኝ፤ ሰው ከዚህ እንጀራ ቢበላ ለዘለዓለም ይኖራል፤ እኔም ስለ ዓለም ሕይወት የምሰጠው እንጀራ ሥጋዬ ነው።. . . እውነት እውነት እላችኋለሁ፤ የወልደ እጓለ እመሕያውን ሥጋውን ካልበላችሁ ደሙንም ካልጠጣችሁ በራሳችሁ ሕይወት የላችሁም ። ሥጋዬን የሚበላ ደሜንም የሚጠጣ የዘለዓለም ሕይወት አለው። እኔም በመጨረሻው ቀን አስነሣዋለሁ።» /ዮሐ.6፥25-59/

ጌታችን እንዲህ ሲላቸው ይህ እንዴት ሊሆን እንደሚችል ለብዙዎቹ ግልጽ አልነበረም። አባባሉ ከብዷቸው እርሱን ከመከተል ወደ ኋላ ያሉም ብዙዎች ነበሩ። ጌታችን ግን ከሕማማቱና ከሞቱ በፊት ለዋዜማው ሀሙስ ማታ ምሥጢረ ቁርባንን መሥርቶ አሳይቷቸዋል።

በዚያች ምሽት ጌታችን «እንጀራን አንሥቶ ባረከ፤ ቆርሶም ለደቀመዛሙርቱ ሰጠና እንካችሁ ብሉ ይህ ሥጋዬ ነው» አለ፡፡ ጽዋውንም አንሥቶ አመስግኖም ሰጣቸው እንዲህም አለ፡፡ ሁላችሁ ከእርሱ ጠጡ፤ ስለ ብዙዎች ለኃጢአት ይቅርታ የሚፈስ የአዲስ ኪዳን ደሜ ይህ ነው፡፡» አለ፡፡ /ማቴ.26÷26-28/

በዚህ መልኩ ጌታችን ሕብስቱን ባርኮ በዕለተ ዐርብ ወደ ተቆረሰው ቅዱስ ሥጋው ወይኑንም ባርኮ በዕለተ አርብ ወደ ፈሰሰው ክቡር ደሙ ለውጦ ሰጥቷቸዋል፡፡

በዚህም መሠረት ዛሬም ካህናት በጸሎተ ቅዳሴ ሕብስቱንና ወይኑን ሲባርኩት ወደ ጌታችን ሥጋ እና ደምነት ይለወጣል፡፡ እኛም ተቀብለው የዘለዓለም ሕይወት ባለቤት እንሆናለን፡፡

3.3.5 ምሥጢረ ትንሣኤ ሙታን

«ትንሣኤ» የሚለው ቃል «መነሣት» የሚል ትርጉም ያለው የግእዝ ቃል ነው፡፡ ምስጢረ ትንሣኤ ሙታን የሰው ልጆች ሙተው ፈርሰውና በስብሰው እንደማይቀሩ ነገር ግን በመጨረሻ ሕያው ሆነው እንደሚነሡ የምንማርበት ትምህርት ነው፡፡

አዳምና ሔዋን ሲበድሉ አስቀድሞ በተሰጣቸው ሕግ /ማስጠንቀቂያ/ መሠረት የሞት ፍርድ ተፈርዶባቸው ነበር፡፡ የአዳም ኃጢአት ወደ ልጆቹ ሁሉ በመተላለፉ ምክንያት ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ሞት በሰው ልጆች ላይ ሠልጠኖባቸው ይኖር ነበር፡፡ ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የበደላችንን ካሣ ለመክፈል ከሞተ በኋላ ከሙታን ተለይቶ በመነሣቱ ሞትን ድል አድርጎልናል፡፡ በትንሣኤውም የትንሣኤያችን በኩር ሆኖ ትንሣኤያችንን አረጋግጦልናል፡፡

በዚህም መሠረት ጌታችን ለፍርድ ይህንን ዓለም ለማሳለፍ ሲመጣ ሁላችንም ከሞት እንቅልፍ እንነሣለን፡፡ ስንነሣም በዚህ ምድር የሠራነውን ሥራ /ደግም ሆነ ክፉ/፣ ይዘነው እንነሣለን፡፡ እንደ ሥራችንም ወደ ዘለዓለማዊ ቅጣት ወይም ወደ ዘለዓለማዊ ደስታ ስፍራ እንወሰዳለን፡፡ /ማቴ.25÷31-46/